ጃሚአ የትምህርት ና የደእዋ ማእከል

الأصول الثلاثة للشيخ محمد بن عبد الوهاب باللغة الأمهرية

# አል ኡሱል ሰላሳ

## ሶስቱ መሰረታዊ መርሆወች

ሸይኽ ሙሀመድ ቢን አብዱል ወሀብ (ረሂመሁሏህ )

[1434 ሂጅራ]

## ሸይኹል ኢስላም ሙሀመድ ቢን አብደልዋሀብ

ሸይኹል ኢስላም ሙሀመድ ቢን አብደል ወሀብ በ1115 ሂጅራ ከሪያድ 70 ኪ.ሜ ርቃ በምትገኘው ኡየይናህ ተወለዱ ። ቤተሰቦቻቸው የተከበሩና ተዋቂወች ነበሩ አባታቸው ሸይኽ አብዱል ወሀብ ሱለይማን በጥልቅ የእውቀት ምንጭነታቸው በመልካም ና ሰናይ ተግባራቸው በማራኪ ባህሪያቸው ለኢስላም በሚከፍሉት መስዋእትነት የታወቁ ነበሩ ።

ሸይኽ ሙሀመድ ቢን አብደል ወሀብ በ10 አመታቸው ቁርአንን የሀፊዙ ሲሆን በለጋው እድሜያቸው የተፍሲር የሀድስ እንድሁም የፍቅህ መፅሀፍቶችን ያጠኑ ነበር ።

ለአቅመ አዳምም ሲደርሱ ወደ መካ በመሄድ ሃጅ ያደረጉና በመካም ቆይታን በማድረግ በቦታው ከሚገኙ አሊሞች አያሌ እውቀቶችን ቀስመዋል ቀጥለውም ወደ መድና ጉዞ በማድረግ በተዋቂው ሸይኽ አብደሏህ ቢን ኢብራሂም ቢንሰኢድ ነጅድና ሸይኽ ሙሀመድ ሀያት ሲንድ ስር ለረጅም ግዜ እውቀትን ቀስመዋል ።የእውቀት ፍለጋቸው በዚህ ብቻ ሳይገታ የበረሀ ጉዞ እያንገላታቸው ወደ ኢራቅ ና በስራ ጉዞ በማድረግ ከከተሞቹ ባሉ አሊሞች የኢልም ምንጭ ተጎንጭተዋል።

በዚያን ዘመን አካባቢው ከኢስላም ውጪ በሆነ ተግባራት ውስጥ ተዘፍቆ ያገኙት ሸይኽ ያልተበረዘውን የአሀዳዊ የተውሂድ እምነት ከመቃብር ከዛፍ ከድንጋይ ከዋሻወች እንድሁም ከሙት መንፈስ መሰረተ ቢስ እምነቶች እንድላቀቅ ህብረተሰቡን ማስተማር ይጀምራሉ ።

ሰወችን ወደ ተውሂድ ወደ ቁርአን ና ሱና ፊታቸውን እንዳዞሩ ጥሪ ማድረግ ተያያዙት የሙስሊሙ ማህበረሰብ በጭፍኑ መከተልን በመተው ቁርአን ና ሱና መከተል አዋጪ እንደሆነ ሰበኩ የአሏህ (ሱወ) ትእዛዝ እንድሁም የረሱል (ሶአወ )ሱና ተገቢውን ቦታ ዳግም እንድጎናፀፍ ታገሉ አታገሉ ።

በወቅቱ ተነሰራፍቶ የነበረውን ሺርክና ቢድአ ከመካ ከመድና ከየመን ጠራርጎ ለማጥፋት በርካታ ምሁራን ጥሪያቸውን በመቀበል ድጋፋቸውን ለገሷቸው

የአሏህ (ሱወ ) ተውፊቅ (መገጠም) ሆኖ በርካታ የአረቢያንን ምድር ከ ሺርክና ከቢድአ ለማፅዳት ና እንድሁም ሂደታቸው ለበርካታ የኢስላም ምሁራን ተምሳሌት ሆነዋል ።

ህይወታቸውን በሙሉ በደእዋ መሳካት ያደረጉት ሸይኽ ሙሀመድ በ1206 (1792) በወርሀ ዙልቀኢዳህ ለሁሉምፍጡራን የተወሰነለትን የሞት ፅዋ ተጎነጩ።

ተግባራቸውን አሏህ (ሱወ) በጥሩ ሚዛኑ አድርጎ ጀነትን ይወፍቃቸው። አሚን !!!

በአሏህ ስም እጅግ በጣም ሩህሩህ አዛኝ በሆነው

**አሏህ ምህረቱን ይለግስህና አራት ጉዳዮችን መማር ግደታችን መሆኑን እወቅ !!**

**የመጀመርያው** :- እውቀት ሲሆን እሱም አሏህን መልእክተኛውን ና የኢስላምን ሀይማኖት በማስረጃ ላይ በተመረከዘ ሁኔታ ማወቅ ነው ።

**ሁለተኛው** :- ይህን እውቀት በስራ ላይ ማዋል

**ሶስተኛው** :- ወደዚህ ደእዋ (ጥሪ ) ማድረግ

**አራተኛው** :- በደእዋው ሂደት ላይ በሚያጋጥሙ ችግሮች ላይ በትእግስት መወጣት ናቸው ።

**ማስረጃውም የአሏህቃል ነው**

``በግዚያት እምላለሁ የሰውልጅ በከሳራ ውስጥ ነው። እነዚያ ያመኑትና መልካም ስራወችን የሰሩት በእውነትም አደራ የተባባሉት በትእግስትም አደራ የተባባሉት ሲቀሩ ``

(አል አስር)

ኢማሙ ሻፍእይ (አሏህ ይዘንላቸው) እንድህ ብለዋል

`` አሏህ በፍጡራኑ ላይ ከዚህ ምእራፍ በቀር ምንም አስረጅ ባያወረድ ኖሮ በበቃቸው ነበር ``

**بسم الله الرحمن الرحيم**

**اعلم رحمك الله انه يجب علينا تعلم اربع مسائل**

**الأولى : العلم ، وهو معرفة الله ،ومعرفة نبيه ،ومعرفة دين الإسلام بالأدلة**

**الثانية : العمل به**

**الثالثة : الدعوة اليه**

**الرابعة : الصبر على الأذى فيه**

**والدليل قوله تعالى : {وَالْعَصْرِ إِنَّ الْإِنْسَانَ لَفِي خُسْرٍ إِلَّا الَّذِينَ آمَنُوا وَعَمِلُوا الصَّالِحَاتِ وَتَوَاصَوْا بِالْحَقِّ وَتَوَاصَوْا بِالصَّبْرِ}**

**قال الشافعي -رحمه الله تعالى " لو ما أنزل الله حجة على خلقه إلا هذه السورة لكفتهم"**

ኢማሙል ቡኻሪ (አሏህ ይዘንላቸው )በታላቁ መፅሀፋቸው ላይ ``እውቀት ከንግግር ሆነ ከተግባር ይቀድማል `` የሚለውን የመግቢያ ርእስ አድርገው አስቀምጠውታል ። ለዚህም አባባላቸው ተከታዩን የአሏህ ቃል በአስረጅነት በመጥቀስ አሏህ ከንግግርና ከተግባር በፊት በእውቀት መጀመሩን ገልፀዋል ።

``እነሆ ከአሏህ ሌላ አምላክ አለመኖሩን እወቅ ለስህተትህና ለምእምናንም ምህረትን ለምን  አሏህ መዘዋወርያችሁንና መርጊያችሁን  ያውቃል `` (ሙሀመድ 19 )

አሏህ እዝነቱን ይለግስህና እያንዳንዱ ሙስሊም የሚከተሉትን ሶስት መሰረታዊ ጉዳይ የመማር ና  በተግባር የማዋል ግደታ እንዳለበት ልታውቅ ይገባል ።

1- አሏህ ከፈጠረንና ሲሳያችንን ከሰጠን በኋላ እንዲሁ አልተወንም  ወደኛ መልእክተኛውን (ሶአወ )ላከ እርሳቸውን የታዘዘ ጀነት ይገባል ። ትእዛዛቸውን የጣሰና ያመፀ ደግሞ ጀሀነም እሳት ይገባል ።

ለዚህም ማስረጃው

``  እኛ  ወደ ፈርአውን መልእክተኛን እንደላክነው ሁሉ በእናንተም ላይ መስካሪ የሆነ መልእክተኛን ላክን ፈርዓውን መልእክተኛውን አመፀ ብርቱ መያዝንም ያዝነው `` (ሙዘሚል 15 -16)

**وقال البخاري -رحمه الله "باب العلم قبل القول والعمل"**

**والدليل قوله تعالى**
**{فَاعْلَمْ أَنَّهُ لا إِلَهَ إِلَّا اللَّهُ وَاسْتَغْفِرْ لِذَنْبِكَ} [سورة محمد، الآية: 19]، فبدأ بالعلم قبل القول والعمل**

**اعلم رحمك الله: أنه يجب على كل مسلم ومسلمة تعلم ثلاث هذه المسائل والعمل بهن**

**الأولى: أن الله خلقنا ورزقنا ولم يتركنا هملاً بل أرسل إلينا رسولافمن أطاعه دخل الجنة ومن عصاه دخل النار**

**والدليل قوله تعالى: {إِنَّا أَرْسَلْنَا إِلَيْكُمْ رَسُولاً شَاهِداً عَلَيْكُمْ كَمَا أَرْسَلْنَا إِلَى فِرْعَوْنَ رَسُولاً فَعَصَى فِرْعَوْنُ الرَّسُولَ فَأَخَذْنَاهُ أَخْذاً وَبِيلاً}**

2- አሏህ በርሱ በሚደረግ ዒባዳ (አምልኮት )ባለሞል መልዓከም ሆነ ተልእኮ የተሰጠው ነብይ ወይም ሌላ ማንንም እንድናጋራ  አይወድም ለዚህ ማስረጃው '' እነሆ መስጂዶችም ሁሉ የአሏህ ብቻ ናቸው (በውስጣቸውም ) ከአሏህ ጋ  አንድንም አትገዙ ''
(አልጅን 18 )

መልእክተኛውን የታዘዘና የአሏህን አንድነት ያረጋገጠ ሰው አሏህንና መልእክተኛውን የሚከራከር ሰው በጣም የቅርብ ዘመዱም ቢሆን እንኳ  እንድወዳጅ አይፈቀድለትም ። ለዚህም ማስረጃው ተከታዩ የአሏህ ቃል ነው ።

'' በአሏህና በመጨረሻው ቀን የሚያምኑትን ህዝቦች አሏህንና መልእክተኛውን የሚከራከሩትን ሰወች አባቶቻቸው ወይም ልጆቻቸው ወይም ወንድሞቻቸው ወይም ዘመዶቻቸው ቢሆኑ እንኳን የሚወዳጁ ሆነው አታገኛቸውም ። እነዚያ በልቦቻቸው ውስጥ እምነትን ፅፏል። ከርሱም በሆነ መንፈስ ደግፎቸዋል ። ከስሮቻቸው ወንዞች የሚፈሱባቸውን ገነቶች በውስጣቸው ዘውታሪወች ሲሆኑ ያገባቸዋል። አሏህ ከነርሱ ወዷል (እነሱም)ከርሱ ወደዋል። እነዚያ የአሏህ ህዝቦች ናቸው።ንቁ! የአሏህ ህዝቦች እነሱ የምኞታቸውን የሚያገኙ (ነፃ የሚወጡ) ናቸው። '' (ሙጃደላህ 22)

الثانية: أن الله لا يرضى أن يشرك معه أحد في عبادته لا ملك مقرب، ولا نبي مرسل والدليل قوله تعالى: {وَأَنَّ الْمَسَاجِدَ لِلَّهِ فَلا تَدْعُو مَعَ اللَّهِ أَحَداً}

الثالثة : أن من أطاع الرسول ووحد الله لا يجوز له موالاة من حاد الله ورسوله ولو كان أقرب قريب
والدليل قوله تعالى:

{لا تَجِدُ قَوْماً يُؤْمِنُونَ بِاللَّهِ وَالْيَوْمِ الْآخِرِ يُوَادُّونَ مَنْ حَادَّ اللَّهَ وَرَسُولَهُ وَلَوْ كَانُوا آبَاءَهُمْ أَوْ أَبْنَاءَهُمْ أَوْ إِخْوَانَهُمْ أَوْ عَشِيرَتَهُمْ أُولَئِكَ كَتَبَ فِي قُلُوبِهِمُ الْأِيمَانَ وَأَيَّدَهُمْ بِرُوحٍ مِنْهُ وَيُدْخِلُهُمْ جَنَّاتٍ تَجْرِي مِنْ تَحْتِهَا الْأَنْهَارُ خَالِدِينَ فِيهَا رَضِيَ اللَّهُ عَنْهُمْ وَرَضُوا عَنْهُ أُولَئِكَ حِزْبُ اللَّهِ أَلا إِنَّ حِزْبَ اللَّهِ هُمُ الْمُفْلِحُونَ}

اعلم أرشدك الله لطاعته أن الحنيفية ملة إبراهيم أن تعبد الله وحده مخلصاً له الدينوبذلك أمر الله جميع الناس وخلقهم لها
كما قال الله تعالى: {وَمَا خَلَقْتُ الْجِنَّ وَالْأِنْسَ إِلَّا لِيَعْبُدُونِ}
ومعنى يعبدون يوحدون
وأعظم ما أمر الله به التوحيد وهو: إفراد الله بالعبادة
وأعظم ما نهى عنه الشرك. وهو: دعوة غيره معه
والدليل قوله تعالى: {وَاعْبُدُوا اللَّهَ وَلا تُشْرِكُوا بِهِ شَيْئاً}

فإذا قيل لك: ما الأصول الثلاثة التي يجب على الإنسان معرفتها ؟

فقل: معرفة العبد ربه ودينه ونبيه محمداً صلى الله عليه وسلم

አሏህ እርሱን ለመታዘዝ ያቅናህና ቀጥተኛ የሆነው የኢብራሂም መንገድ (ሀኒይፊይ )ሀይማኖትን ለርሱ ፍፁም በማድረግ አንድ አሏህን ብቻ ማምለክ ነው ። አሏህም በዚህ የሀኒይፊይ ቀጥተኛ መንገድ ሰወችን በሙሉ አዟል። ለዚህ አላማ ፈጥሯቸዋል።
'' ጋኒንም ሆነ ሰውን ሊገዙኝ እንጅ ለሌላ አልፈጠርኳቸውም '' (አልዛርያት 56 )
''ሊገዙኝ '' ማለት (የእኔን አንድነት ሊያረጋግጡ) ማለት ነው ።
አሏህ ካዘዛቸው ትእዛዝ ሁሉ ትልቁ '' ተውሂድ'' ሲሆን እርሱም (ዒባዳ )አምልኮን ለአሏህ ብቻ ማድረግ ነው ።
(በአንፃሩ ) አሏህ ከከለከለው ሁሉ ከባዱና ትልቁ ''ሺርክ'' ነው። ይህ ማለት ከአሏህ ሌላ ያለን አካል ከእርሱ ጋ ማምለክ ነው ። ለዚህ ማስረጃው '' አሏህን ተገዙ በርሱም ምንም አታጋሩ '' (አልኒሳእ 36 )

ሰወች ሊያውቋቸው የሚገቡ ሶስት መሰረታዊ መርሆወች ምን ምን ናቸው ? ተብለህ ብትጠየቅ ማንኛውም ሙስሊም ሊያውቃቸው የሚገቡ ሶስት መሰረታዊ መርሆወች :-
አንድ ሙስሊም ጌታውን አሏህን ፤ ሀይማኖቱን ኢስላምን ና፤ ነብዩ ሙሀመድን (ሶአወ )ማወቅ እንዳለበት ነው።

## የመጀመርያው መሰረታዊ መርህ

ጌታህ ማነው ? ተብለህ ብትጠየቅ እንድህ በማለት መልስ ፦

ጌታየ እኔን ና አለማትን በሙሉ በችሮታው ተንከባክቦ ያሳደገው አሏህ ነው ። የማመልከውም እርሱን ብቻ ነው ።ከርሱ በቀር አምላክ የለኝም ለዚህም ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው ``ምስጋና ለአለማት ጌታ ለአሏህ ነው ``(ፋቲሀ 2 ) ከአሏህ ሌላ ያለ ሁሉ ፍጥረተ_አለም ሲሆን እኔም የዚህ ፍጥረት አካል ነኝ ።

ጌታህን እንደት ልታውቅ ቻልክ ? ተብለህ ከተጠየቅክ ፦

ጌታየን ላውቅ የቻልኩት ታአምራቱንና ፍጥረታቱን በማስተዋል ነው ።በማለት መልስ ።ከተአምራቶቹ ውስጥ ለሊት ና ቀን ፀሀይ ና ጨረቃ ሲገኙበት ከፍጥረታቱ ደግሞ በሰባቱ ሰማያት ና ሰባቱ ምድሮች በውስጣቸውና በመሀከላቸው ያለ ሁሉ ይገኝበታል ለዚህም ማስረጃው ፦

`` ለሊትና ቀንን ፀሀይና ጨረቃን ከምልክቶቹ ናቸው ለፀሀይና ለጨረቃ አትስገዱ እርሱን ብቻ የምትገዙ እንደሆናችሁ (ለሌላ አትስገዱ )ለዚያም ለፈጠራችሁ አሏህ ብቻ ስገዱ `` (ፉሲለት 37)

فإذا قيل لك: من ربك ؟
فقل: ربي الله الذي رباني وربى جميع العالمين بنعمه وهو معبودي ليس لي معبود سواه
والدليل قوله تعالى: {الْحَمْدُ لِلَّهِ رَبِّ الْعَالَمِينَ}
وكل ما سوى الله عالم وأنا واحد من ذلك العالم

فإذا قيل لك: بأي شيء عرفت الله عز وجل؟
فقل: عرفته بآياته ومخلوقاته ومن آياته : الليل والنهار والشمس والقمر ومن مخلوقاته السموات السبع والأرضون السبع وما فيهن وما بينهما.

والدليل قوله تعالى {وَمِنْ آيَاتِهِ اللَّيْلُ وَالنَّهَارُ وَالشَّمْسُ وَالْقَمَرُ لا تَسْجُدُوا لِلشَّمْسِ وَلا لِلْقَمَرِ وَاسْجُدُوا لِلَّهِ الَّذِي خَلَقَهُنَّ إِنْ كُنْتُمْ إِيَّاهُ تَعْبُدُونَ}

የአሏህ ንግግ ነው ፡-

`` ጌታችሁ ያ ሰማያትንና ምድርን በስድስት ቀናት ውስጥ የፈጠረው አሏህ ነው ። ከዚያም ከአርሹ በላይም ከፍ አለ ።(አሏህ ) ለሊትን ፈጥኖ የሚፈልገው ሲሆን በቀን ይሸፍናል ።ፀሀይ ጨረቃ ና ከዋክብትን በትእዛዙ የተገሩ ሲሆኑ ፈጠራቸው ። ንቁ ! መፍጠርና ማዘዝ የርሱ ብቻ ነው ።የአለማት ጌታ አሏህ (ክብሩ ) ላቀ ። (አእራፍ 54 )

`` ረብ`` ወይም ጌታ ማለት አምልኮት የሚደረግለት ማለት ነው።ለዚህ ማስረጃው የሚከተለው የአሏህ ቃል ነው ፡-

``እናንተ ሰወች ሆይ የፈጠራችሁን እነዚያንም ከናንተ በፊት የነበሩትን የፈጠረውን ጌታችሁን ተገዙ (ቅጣቱን ) ልትጠነቀቁ ይከጀላልና ።(በቀራ 21 )

ተዋቂው የቁርአን ተንታኝ ኢብኑ ከሲር (አሏህ ይዘንላቸው ) እንድህ አሉ ፡-

`` አምልኮ (ኢባዳ ) በብቸኝነት ሊፈፀምለት የሚገባው ለነዚህ ነገሮች ፈጣሪ ለርሱ ብቻ ነው ።

وقوله تعالى:
{إِنَّ رَبَّكُمُ اللَّهُ الَّذِي خَلَقَ السَّمَاوَاتِ وَالْأَرْضَ فِي سِتَّةِ أَيَّامٍ ثُمَّ اسْتَوَى عَلَى الْعَرْشِ يُغْشِي اللَّيْلَ النَّهَارَ يَطْلُبُهُ حَثِيثاً وَالشَّمْسَ وَالْقَمَرَ وَالنُّجُومَ مُسَخَّرَاتٍ بِأَمْرِهِ أَلا لَهُ الْخَلْقُ وَالْأَمْرُ تَبَارَكَ اللَّهُ رَبُّ الْعَالَمِينَ}

والرب هو المعبود
والدليل قوله تعالى
{يَا أَيُّهَا النَّاسُ اعْبُدُوا رَبَّكُمُ الَّذِي خَلَقَكُمْ وَالَّذِينَ مِنْ قَبْلِكُمْ لَعَلَّكُمْ تَتَّقُونَ}

قال ابن كثير - رحمه الله تعالى
"الخالق لهذه الأشياء هو المستحق للعبادة "

وأنواع العبادة التي أمر الله بها
مثل
الإسلام
والإيمان
والإحسان
ومنه الدعاء
والخوف
والرجاء
والتوكل ، والرغبة ، والرهبة ، والخشوع،
والخشية، والإنابة، والاستعانة، والاستعاذة،
والاستغاثة، والذبح، والنذر
وغيرذالك من أنواع العبادة التي أمر الله
بها كلها لله تعالى
والدليل قوله تعالى

**አሏህ ያዘዛቸው የአምልኮ አይነቶች ብዙ ናቸው**

ከርሱም ውስጥ ፦

- አምስት የኢስላም መአዘናት
- ስድስት የኢማን (እምነት )ዘርፎች
- ኢህሳን (በጎ መዋል )
- ዱአእ (ፀሎት )
- ኸውፍ (ፍራቻ )
- ረጃእ (ተስፋ ና እምነት መጣል )
- ተወኩል ( መመካት )
- ረግባህ (ምንዳን መፈለግ መታዘዝ)
- ረህባህ (ቅጣትን መፍራት መታዘዝ)
- ኹሹእ (መተናነስ ና በፍራቻ መገዛት)
- ኸሺያህ (መፍራት)
- ኢናባህ (በንሰሀ መመለስ)
- እስቲአዛ (ጥበቃን መሻት)
- እስቲአናህ (ረድኤትን መጠየቅ )
- እስቲጋሳ ( እገዛን መለመን )
- ዘብህ ( የእርድ መስዋእት ማቅረብ )
- ነዝር ( ስለት ) እና ሌሎችም ይገኙበታል ።

እነዚህና ሌሎችም የኢባዳ ዘርፎች ለአሏህ ብቻ የሚገቡ ናቸው ለዚህ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው ።

{وَأَنَّ الْمَسَاجِدَ لِلَّهِ فَلا تَدْعُو مَعَ اللَّهِ أَحَداً}
فمن صرف منها شيئاً لغير الله فهو مشرك كافر
والدليل قوله تعالى: {وَمَنْ يَدْعُ مَعَ اللَّهِ إِلَهاً آخَرَ لا بُرْهَانَ لَهُ بِهِ فَإِنَّمَا حِسَابُهُ عِنْدَ رَبِّهِ إِنَّهُ لا يُفْلِحُ الْكَافِرُونَ}
وفي الحديث: "الدعاء مخ العبادة"
والدليل قوله تعالى: {وَقَالَ رَبُّكُمُ ادْعُونِي أَسْتَجِبْ لَكُمْ إِنَّ الَّذِينَ يَسْتَكْبِرُونَ عَنْ عِبَادَتِي سَيَدْخُلُونَ جَهَنَّمَ دَاخِرِينَ}
ودليل الخوف قوله تعالى: {فَلا تَخَافُوهُمْ وَخَافُونِ إِنْ كُنْتُمْ مُؤْمِنِينَ}
ودليل الرجاء قوله تعالى:
{ قُلْ إِنَّمَا أَنَا بَشَرٌ مِّثْلُكُمْ يُوحَىٰ إِلَيَّ أَنَّمَا إِلَـٰهُكُمْ إِلَـٰهٌ وَاحِدٌ ۖ فَمَن كَانَ يَرْجُو لِقَاءَ رَبِّهِ فَلْيَعْمَلْ عَمَلًا صَالِحًا وَلَا يُشْرِكْ بِعِبَادَةِ رَبِّهِ أَحَدًا }

'' እነሆ መስጂዶችም ሁሉ የአሏህ ብቻ ናቸው (በውስጣቸውም )ከአሏህ ጋር አንድንም አትገዙ ''
(አል- ጅን 18 )
ከነዚህ የኢባዳ አይነቶች ጥቂትን እንኳ ለማንኛውም ከአሏህ ሌላ ላለ ወገን ያዋለ ሰው እርሱ በአሏህ ላይ አጋሪ (ሙሺሪክ )ብሎም ከሀድ (ካፊር )ነው ።
ለዚህ ማስረጃው ፦
'' ከአሏህም ጋር ለርሱ በርሱ ማስረጃ የሌለውን ሌላ አምላክ የሚገዛ ሰው ምርመራው እጌታው ዘንድ ብቻ ነው ። እነሆ!ከሀድወች አይድኑም ።(ሙእሚኑን 117 )
በሀድስ እንደተላለፈው '' ዱአ የኢባዳ መቅኔ ነው ''
'' ጌታችሁም አለ ፦ ለምኑኝ እቀበላችኋለሁና እነዚያ እኔን ከመገዛት የኮሩ ተዋራጆች ሆነው ገሀነም ይገባሉ '' ( ጋፊር 60 )
ኸውፍ (ፍራቻ ) ለአሏህ ብቻ እንደሆነ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው ።
'' አትፍሯቸው ምእምን እንደሆናችሁ እኔን ፍሩኝ ''
(አል_ምራን 175 )
ረጃእ (ተስፋና እምነት መጣል ) በአሏህ ላይ ብቻ እንደሆነ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው ።
'' እኔ አምላካችሁ አንድ አምላክ ብቻ ነው(የሚል መልእክት ) ወደኔ የሚወረድልኝ ቢጤያችሁ ሰው ብቻ ነኝ፡፡ የጌታውንም መገናኘት የሚፈልግ ሰው፤ መልካም ሥራን ይስራ በጌታውም መገዛት አንድንም አያጋራ» በላቸው''
(አል ከሀፍ 110 )

ودليل التوكل قوله تعالى: {وَعَلَى اللَّهِ فَتَوَكَّلُوا إِنْ كُنْتُمْ مُؤْمِنِينَ}
وقال: {وَمَنْ يَتَوَكَّلْ عَلَى اللَّهِ فَهُوَ حَسْبُهُ}
ودليل الرغبة والرهبة والخشوع
قوله تعالى: {إِنَّهُمْ كَانُوايُسَارِعُونَ فِي الْخَيْرَاتِ وَيَدْعُونَنَا رَغَباً وَرَهَباً وَكَانُوا لَنَا خَاشِعِينَ}

ودليل الخشية قوله تعالى: {فَلا تَخْشَوْهُمْ وَاخْشَوْنِي}

ودليل الإنابة قوله تعالى: {وَأَنِيبُوا إِلَى رَبِّكُمْ وَأَسْلِمُوا لَهُ}

ودليل الاستعانة قوله تعالى: {إِيَّاكَ نَعْبُدُ وَإِيَّاكَ نَسْتَعِينُ}

وفي الحديث " إذا استعنت فاستعن بالله"

ተወኩል (መመካት) በአሏህ ብቻ እንደሆነ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
'' ምእምናን እንደሆናችሁ በአሏህ ላይ ተመኩ ''
(አል_ማኢዳህ 23 )
'' በአሏህ ላይ የሚጠጋ ሰው እርሱ በቂው ነው ''
(አል_ጦላቅ 3 )
ረግባ (ምንዳን መፈለግ መታዘዝ ) ረህባ (ቅጣትን መፍራት መታዘዝ ) እና ኹሹእ (መተናነስ በፍራቻ መገዛት) ለአሏህ ብቻ ለመሆኑ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው፡-
'' እነሱ በበጎ ስራወች የሚቻኮሉ ከጃዮችና ፈሪወች ሆነው የሚለምኑንም ነበሩ ለኛ ተዋራጆች ነበሩ ''
(አል_አንቢያእ 90 )
ኸሺያ (ፍራቻ ) ለአሏህ ብቻ እንደሆነ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
'' አትፍሯቸው ፍሩኝም '' (አል_በቀራ 150 )
ኢናባህ (በንሰሀ መመለስ ) ለአሏህ ብቻ መሆኑን ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
'' ወደ ጌታችሁ በመፀፀት ተመለሱ ለእርሱ ታዘዙ '' (አል_ዙመር 54 )
እስቲአናህ (ረድኤት መጠየቅ )ከአሏህ ብቻ እንደሆነ ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
'' አንተን ብቻ እንገዛለን አንተን ብቻ እርዳታ እንለምናለን '' (አል_ፋቲሀ 4 )
በሀድስ '' መረዳት ካለብህ በአሏህ ተረዳ ... ''

እስቲአዛ (ጥበቃን መሻት ) ከአሏህ ብቻ መሆኑን ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
`` በል ፡ በሰወች ፈጣሪ እጠበቃለሁ የሰወች ንጉስ በሆነው `` (አል_ናስ 1-2 )

እስቲጋሳ (እገዛን መለመን ) ከአሏህ ብቻ መሆኑን ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
`` ከጌታችሁ እገዛ በፈለጋችሁና በተቀበላችሁም ግዜ (አስታውሱ ) `` ( አል-አንፋል 9 )

ዞብህ (የመስዋእት እርድ ማቅረብ )ለአሏህ ብቻ መሆኑን ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
``ስግደቴ ማረደም ህይወቴ መሞቴም ለአለማት ጌታ ለአሏህ ነው በል።በዚህም (በመጣራት ) ታዘዝኩ እኔም የሙስሊሞች መጀመርያ ነኝ (በል ) ``
(አል-አንአም 162-163 )
በሀድስም `` ከአሏህ ውጪ ለሌላ የሡዋ የአሏህ እርግማን ይውረድበት ``የሚለው ተመልክቷል።

ነዝር (ስለት ) ለአሏህ ብቻ መሆኑን ማስረጃው ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-
`` በስለታቸው ይሞላሉ መከራው ተሰራጭ የሆነን ቀንም ይፈራሉ `` (አል-ኢንሳን 7 )

ودليل الإستعاذة قوله تعالى
{قُلْ أَعُوذُ بِرَبِّ النَّاسِ مَلِكِ النَّاسِ }

ودليل الإستغاثة قوله تعالى
{إِذْ تَسْتَغِيثُونَ رَبَّكُمْ فَاسْتَجَابَ لَكُمْ}

ودليل الذبح قوله تعالى : {قُلْ إِنَّ صَلاتِي وَنُسُكِي وَمَحْيَايَ وَمَمَاتِي لِلَّهِ رَبِّ الْعَالَمِينَ لا شَرِيكَ لَهُ}
ومن السنة: "لعن الله من ذبح لغير الله"

ودليل النذر قوله تعالى: {يُوفُونَ بِالنَّذْرِ وَيَخَافُونَ يَوْماً كَانَ شَرُّهُ مُسْتَطِيراً}

## ሁለተኛው መሰረታዊ መርህ

የኢስላምን ሀይማኖ ት በማስረጃ ማወቅ ይህ ማለት የአሏህን አንድነት (ተውሂድ ) በማረጋገጥ ለርሱ እጅ መስጠት ለርሱ መታዘዝም ሙሉ በሙሉ በርሱ መመራት እንድሁም ከሺርክና ከሺርክ አራማጆች ከሆኑን ሙሺሪኮች መጥራት ነው ።
ይህም ሶስት ደረጃወች አሉት ፦

## የኢስላም ደረጃወች እርከኖች

ኢስላም ሶስት ደረጃወች አሉት እነሱም ፦
የኢስላም (የታዛዢነት ) የኢማን (የአማኝነት ) የኢህሳን (ስራን ባማረ መልኩ መተግበር ) ደረጃወች ናቸው ። እያንዳንዱ ደረጃም የራሱ የሆኑ ማእዘናት (ሩክኖች ) አሉት ።

**የኢስላም መሰረቶች አምስት ናቸው**

ከአሏህ በቀር (በሀቅ ) የሚመለክ አምላክ እንደሌለና ሙሀመድ (ሰ አወ ) የአሏህ መልእክተኛ እንደሆኑ መመስከር ሶላትን ደንቡን ጠብቆና አዘውትሮ መስገድ ዘካን መስጠት የረመዳን ወር መፆም እንድሁም ወደተከበረው የአሏህ ቤት ሀጅ ማድረግ ናቸው ።

## الأصل الثاني: معرفة دين الإسلام بالأدلة

وهو: الإستسلام لله بالتوحيد والانقياد له بالطاعة والبراءة من الشرك وأهله

وهو ثلاث مراتب

الإسلام، والإيمان والإحسان، وكل مرتبة لها أركان

فأركان الإسلام خمسة
شهادة أن لا إله إلا الله وأن محمدا رسول الله، وإقام الصلاة، وإيتاء الزكاة وصوم رمضان، وحج بيت الله الحرام.

የመጀመርያው የኢስላም መሰረት የሆነው ሸሀዳ(ምስክርነት ) ማስረጃ ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-

``አሏህ በማስተካከል የቆመ (አስተናባሪ) ሲሆን ከእርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የሌለ መሆኑን መሰከረ መላእክቶችና የእውቀት ባለቤቶችም (እንደዚሁ መሰከሩ )ከእርሱ በስተቀር ሌላ አምላክ የለም አሸናፊው ጥበበኛው ነው። ``

(አል- ኢምራን 18 )

ይህም ከአንዱ አሏህ በስተቀር በሀቅ አምልኮ (ዒባዳ )የሚገባው አምላክ የለም ማለት ነው ።

ላኢላሀ `` አምላክ `` የለም የሚለው ንውስ አረፍተ ነገር ከአሏህ ውጪ የሚመለኩ ነገሮችን በሙሉ ውድቅ የሚያደርግ ነው ።

አሏህ በንግስናው አጋር እንደሌለው ሁሉ ለርሱ የሚደረግ ኢባዳም አጋር የለውም ተከታዩ የአሏህ ቃል ይህን ያብራራል :-

``ኢብራሂምም ለአባቱና ለሕዝቦቹ ባለ ጊዜ (አስታውስ)«እኔ ከምትግገዙት ሁሉ ንጹሕ ነኝ» «ከዚያ ከፈጠረኝ በስተቀር (አልግገዛም)እርሱ በእርግጥ ይመራኛልና» በዝርዮቹም ውስጥ ይመለሱ ዘንድ (ባንድ አምላክ ማመንን) ቀሪ ቃል አደረጋት`` (አል-ዙኽሩፍ 26- 28 )

**فدليل الشهادة قوله تعالى**

**{شَهِدَ اللَّهُ أَنَّهُ لا إِلَهَ إِلَّا هُوَ وَالْمَلائِكَةُ وَأُولُو الْعِلْمِ قَائِماً بِالْقِسْطِ لا إِلَهَ إِلَّا هُوَ الْعَزِيزُ الْحَكِيمُ}**

**ومعناها: لا معبود بحق إلا الله**

**"لا إله" نافياً جميع ما يعبد من دون الله " إلا الله" مثبتاً العبادة لله وحده لا شريك له في عبادته**

**كما أنه لا شريك له في ملكه**

**وتفسيرها الذي يوضحها، قوله تعالى**

**{وَإِذْ قَالَ إِبْرَاهِيمُ لِأَبِيهِ وَقَوْمِهِ إِنَّنِي بَرَاءٌ مِمَّا تَعْبُدُونَ إِلَّا الَّذِي فَطَرَنِي فَإِنَّهُ سَيَهْدِينِ وَجَعَلَهَا كَلِمَةً بَاقِيَةً فِي عَقِبِهِ لَعَلَّهُمْ يَرْجِعُونَ}**

وقوله: {قُلْ يَا أَهْلَ الْكِتَابِ تَعَالَوْا إِلَى كَلِمَةٍ سَوَاءٍ بَيْنَنَا وَبَيْنَكُمْ أَلَّا نَعْبُدَ إِلَّا اللَّهَ وَلا نُشْرِكَ بِهِ شَيْئاً وَلا يَتَّخِذَ بَعْضُنَا بَعْضاً أَرْبَاباً مِنْ دُونِ اللَّهِ فَإِنْ تَوَلَّوْا فَقُولُوا اشْهَدُوا بِأَنَّا مُسْلِمُونَ}

`` የመጽሐፉ ባለቤቶች ሆይ! በእኛና በእናንተ መካከል ትክክል ወደ ኾነች ቃል ኑ (እርሷም) አላህን እንጅ ሌላን ላንገዛ በርሱም ምንንም ላናጋራ ከፊላችንም ከፊሉን ከአላህ ሌላ አማልክት አድርጎ ላይይዝ ነው በላቸው እምቢ ቢሉም እኛ ሙስሊሞች መኾናችንን መስክሩ በሏቸው``

(አል-ኢምራን 64 )

ودليل شهادة أن محمداً رسول الله قوله تعالى

{لَقَدْ جَاءَكُمْ رَسُولٌ مِنْ أَنْفُسِكُمْ عَزِيزٌ عَلَيْهِ مَا عَنِتُّمْ حَرِيصٌ عَلَيْكُمْ بِالْمُؤْمِنِينَ رَؤُوفٌ رَحِيمٌ}

ሙሀመድ የአሏህ መልእክተኛ እንደሆኑ የመመስከር መረጃው ተከታዩ የቁራአን አንቀፅ ነው :-

`` ከጎሳችሁ የሆነ ችግራችሁ በእርሱ ላይ ጽኑ የሆነ በእናንተ (እምነት) ላይ የሚጓጓ በምእምናን (ላይ) ርኅሩኅ አዛኝ የኾነ መልክተኛ በእርግጥ መጣላችሁ``( አል-ተውባህ 128 )

ومعنى شهادة أن محمداً رسول الله: طاعته فيما أمر، وتصديقه فيما أخبر، واجتناب ما عنه نهى وزجر، وأن لا يعبد الله إلا بما شرع

ሙሀመድ የአሏህ መልእክተኛ እንደሆኑ መመስከር ማለት እርሳቸው ያዘዙትን መታዘዝ የተናገሩትን እውነት ብሎ መቀበል ከከለከሉትና ከገሰፁት ነገር መታቀብ እንድሁም አሏህን እርሳቸው በደነገጉት መሰረት ብቻ መገዛት ማለት ነው ። የሶላትና የዘካ ማስረጃው ደግሞ ተከታዩ የቁርአን አንቀፅ ነው :-

ودليل الصلاة، والزكاة ، وتفسير التوحيد قوله تعالى: {وَمَا أُمِرُوا إِلَّا لِيَعْبُدُوا اللَّهَ مُخْلِصِينَ لَهُ الدِّينَ حُنَفَاءَ وَيُقِيمُوا الصَّلاةَ وَيُؤْتُوا الزَّكَاةَ وَذَلِكَ دِينُ الْقَيِّمَةِ}

`` አላህን ሃይማኖትን ለእርሱ ብቻ አጥሪዎች ቀጥተኞች ኾነው ሊግገዙት ሶላትንም አስተካክለው ሊሰግዱ ዘካንም ሊሰጡ እንጅ ያልታዘዙ ሲኾኑ (ተለያዩ) ይህም የቀጥተኛይቱ (ሃይማኖት) ድንጋጌ ነው``

የፆም ማስረጃ ደግሞ  የሚከተለው አንቀፅ ነው፡-

``እናንተ ያመናችሁ ሆይ ጾም በነዚያ ከናንተ በፊት በነበሩት (ሕዝቦች) ላይ እንደ ተጻፈ በናንተም ላይ ተጻፈ (ተደነባ) ልትጠነቀቁ ይከጀላልና ``(አል- በቀራ 183 )

የሀጅ ማስረጃው ደግሞ  የሚከተለው አንቀፅ ነው ፡-

``በውስጡ ግልጽ የኾኑ ተዓምራቶች የኢብራሒምም መቆሚያ አልለ ወደ ውስጡ የገባ ሰው ጸጥተኛ ይኾናል ለአላህም በሰዎች ላይ ወደርሱ መኼድን በቻለ ሁሉ ላይ ቤቱን መጎብኘት ግዴታ አለባቸው የካደም ሰው አላህ ከዓለማት ሁሉ የተብቃቃ ነው ``(አል-ኢምራን 97 )

## ሁለተኛው የኢስላም ደረጃ (እርከን )

ኢማን (እምነት)  ኢማን ከ 73-79 የሚሆን ቅርንጫፎች አሉት።ከነዚህም ሁሉ የበላዩ ``ላኢላሀ ኢለሏህ `` ሲሆን ትንሹ ደግሞ  የሚጎዳን ነገር ከመንገድ ማስወገድ ነው።

ሀያእ (የሀፍረት ስሜት) እንኳ አንዱ የኢማን ዝቅተኛ የኢማን ቅርንጫፍ ነው ።

የኢማን መሰረቶች ስድስት ናቸው ። እነሱም ፡-

በአሏህ በመልአክቱ በመፅሀፍቱ በመለክተኞቹ  በመጨረሻ ቀን እንድሁም በቀደር (መልካም ሆነ መጥፎው በአሏህ መሻትና ውሳኔ ብቻ  የሚከሰት እንደሆነ)ማመን ናቸው።

**ودليل الصيام قوله تعالى**

**{يَا أَيُّهَا الَّذِينَ آمَنُوا كُتِبَ عَلَيْكُمُ الصِّيَامُ كَمَا كُتِبَ عَلَى الَّذِينَ مِنْ قَبْلِكُمْ لَعَلَّكُمْ تَتَّقُونَ}**

**ودليل الحج  قوله تعالى**

**{وَلِلَّهِ عَلَى النَّاسِ حِجُّ الْبَيْتِ مَنِ اسْتَطَاعَ إِلَيْهِ سَبِيلاً وَمَنْ كَفَرَ فَإِنَّ اللَّهَ غَنِيٌّ عَنِ الْعَالَمِينَ}**

## المرتبة الثانية

**الإيمان وهو بضع  وسبعون شعبة فأعلاها قول لا إله إلا الله وأدناها إماطة الأذى عن الطريق والحياء شعبة من الأيمان**

**وأركانه ستة**

**أن تؤمن بالله وملائكته وكتبه ورسله واليوم الآخر وتؤمن بالقدر خيره وشره**

والدليل على هذه الأركان الستة قوله تعالى

{ لَيْسَ الْبِرَّ أَنْ تُوَلُّوا وُجُوهَكُمْ قِبَلَ الْمَشْرِقِ وَالْمَغْرِبِ وَلَكِنَّ الْبِرَّ مَنْ آمَنَ بِاللَّهِ وَالْيَوْمِ الآخِرِ وَالْمَلائِكَةِ وَالْكِتَابِ وَالنَّبِيِّينَ }

ودليل القدر قوله تعالى: {إِنَّا كُلَّ شَيْءٍ خَلَقْنَاهُ بِقَدَرٍ}

## المرتبة الثالثة

الإحسان، ركن واحد وهو " أن تعبد الله كأنك تراه فإن لم تكن تراه فإنه يراك" والدليل قوله تعالى

{إِنَّ اللَّهَ مَعَ الَّذِينَ اتَّقَوْا وَالَّذِينَ هُمْ مُحْسِنُونَ}

وقوله: {وَتَوَكَّلْ عَلَى الْعَزِيزِ الرَّحِيمِ الَّذِي يَرَاكَ حِينَ تَقُومُ وَتَقَلُّبَكَ فِي السَّاجِدِينَ إِنَّهُ هُوَ السَّمِيعُ الْعَلِيمُ}

وقوله: {وَمَا تَكُونُ فِي شَأْنٍ وَمَا تَتْلُو مِنْهُ مِنْ قُرْآنٍ وَلا تَعْمَلُونَ مِنْ عَمَلٍ إِلَّا كُنَّا عَلَيْكُمْ شُهُوداً إِذْ تُفِيضُونَ فِيهِ}

ለዚህ ለስድስት መሰረቶች ማስረጃው የሚከተለው የአሏህ ቃል ነው  ‘‘ መልካም ሥራ ፊቶቻችሁን ወደ ምሥራቅና ምዕራብ አቅጣጫ ማዞር አይደለም ግን መልካም ሥራ በአላህና በመጨረሻው ቀን በመላእክትም በመጻሕፍትም በነቢያትም ያመነ ነው ‘‘ (አል-በቀራ 177 )

በቀደር ማመን ማስረጃው የሚከተለው የአሏህ ቃል ነው ፡-

‘‘እኛ ሁሉን ነገር በቀደር (በልክ) ፈጠርነው ‘‘(አል-ቀመር 49 )

## ሶስተኛ ደረጃ የኢስላም ደረጃ ( እርከን )

ኢህሳን (ተግባርን ማሳመር )አንድ ማእዘን ብቻ ነው ። እርሱም አሏህን ልክ እንደምታየው ሆነህ ማምለክ ነው ። አንተ ባታየው እርሱ ያይሀልና ።ለዚህ ማስረጃው ፡-

‘‘ አሏህ ከነዚያ ከሚፈሩትና ከነዚያም እነሱ መልካም ሰሪወች ከሆኑት ጋር ነው ‘‘ (አል-ነህል 128 )

‘‘ አሸናፊ አዛኝ በኾነው (ጌታህ) ላይም ተጠጋ በዚያ ለሶላት በምትቆም ጊዜ በሚያይህ በሰጋጆች ውስጥ መዘዋወርህንም (በሚያየው ጌታህ ላይ ተጠጋ)እነሆ እርሱ ሰሚው ዐዋቂው ነውና ‘‘ (አል-ሹአራእ 217-220 )

‘‘ በማንኛውም ነገር ላይ አትሆንም ከርሱም ከቁርአን አታነብም ማንኛውንም ሥራ (አንተም ሰዎቹም) አትሠሩም በገባችሁበት ጊዜ በናንተ ላይ ተጠባባቂዎች ብንሆን እንጂ ‘‘ (ዩኑስ 61 )

ከሀድስም ``የጅብሪል ሀድስ``በመባል በስፋት የሚታወቀው ሀድስ ማስረጃ  ሲሆን እንደሚከተለው ይነበባል።

ከኡመር ቢን ኸጧብ (ረዓ) እንደተላለፈው   `` ከእለታት አንድ ቀን ከመልእክተኛው ጋር ተቀምጠን እያለ አንድ በጣም ነጪ የሆነ  ልብስ የለበሰ ፀጉሩ በጣም የጠቆረ የጉዞ ምልክት የማይታይበት  ከእኛም ውስጥ ማንም የማያውቀው ሰው ብቅ አለ ።ጉልበቶቹን ከነብዩ  ጉልበት ጋር አሳክቶ መዳፎቹን ደግሞ  ታፋወቹ ላይ አድርጎ ተቀመጠ ።ከዚያም ``ሙሀመድ ሆይ ስለ ኢስላም ንገረኝ ? `` አላቸው ።የአሏህ መልእክተኛም `` ኢስላም ከአሏህ ሌላ አምላክ እንደሌለ ሙሀመድ የአሏህ መልእክተኛ መሆኑን መመስከር ሶላትን ደንቡን ጠብቆ መስገድ  ዘካን መስጠት የረመዷንን ወር መፆም  አቅም ለፈቀደለት ሰው ሀጅ ማድረግ ነው `` በማለት መለሱለት ።

ጠያቂውም ``እውነት ተናግረሀል ``አለ  እኛም በሰውየ ድርጊት ተገረምን ። እራሱ ጠይቆ  መልሳቸው ትክክል እንደሆነ ያረጋግጥላቸዋል

በመቀጠልም  ``ስለ ኢማን ንገረኝ ? ``አለ  ``በአሏህ ና በመላእክቱ በመፀሀፍቱ በመለእክተኞቹ በመጨረሻው ቀንና ጥሩም ሆነ  መጥፎው በአሏህ ቀድር (እውቀትና ውሳኔ )የሚከሰት እንደሆነ  ማመን ነው ``አሉት ።

والدليل من السنة: حديث جبرائيل المشهور عن عمر رضي الله عنه قال:

بينما نحن جلوس عند رسول الله صلى الله عليه وسلم ذات يوم إذ طلع علينا رجل شديد بياض الثياب شديد سواد الشرع لا يرى عليه أثر السفر ولا يعرفه منا أحد حتى جلس إلى النبي صلى الله عليه وسلم فأسند ركبتيه إلى ركبتيه، ووضع كفيه على فخذيه وقال: يا محمد أخبرني عن الإسلام، فقال رسول الله صلى الله عليه وسلم "الإسلام أن تشهد أن لا إله إلا الله وأن محمدا رسول الله، وتقيم الصلاة، وتؤتي الزكاة، وتصوم رمضان، وتحج البيت إن استطعت إليه سبيلاً"

قال: صدقت، فعجبنا له يسأله ويصدقه

قال: فأخبرني عن الإيمان، قال: "أن تؤمن بالله وملائكته، وكتبه، ورسله، واليوم الآخر، وتؤمن بالقدر خيره وشره"

قال: صدقت، قال: فأخبرني عن الإحسان، قال: "أن تعبد الله كأنك تراه، فإن لم تكن تراه فإنه يراك"، قال: فأخبرني عن الساعة، قال: "أن تلد الأمة ربتها، وأن ترى الحفاة العراة العالة رعاء الشاه يتطاولون في البنيان" قال: فمضى فلبثنا ملياً فقال: "ياعمر أتدري من السائل"؟ قلت: الله ورسوله أعلم، قال: "قال هذا جبريل أتاكم يعلمكم أمر دينكم"

እውነት ተናግረሀል አለና ``ስለ ኢህሳን ንገረኝ ? `` አላቸው ``አሏህን አንተ ባታየው እርሱ ያይሀልና ልክ እንደምታየው ሆነህ መገዛት ነው `` አሉት ፡፡ ``ስለትንሳኤ ቀን ንገረኝ አላቸው `` ``ስለዚህ ጉዳይ ተጠያቂው ከጠያቂው በበለጠ የሚያውቀው ነገር የለም``` አሉት ፡፡ ``የትንሳኤ ቀን እንደተቃረበ የሚያሳዩ ምልክቶችን ንገረኝ ? ``አላቸው፡፡ ``አገልጋይ ሴት ጌታዋን ትወልዳለች ጫማ የሌላቸው የታረዙ ድሀ የፍየል እረኞች (የነበሩ ሰወች)በታላላቅ ህንፃወች ግንባታ ሲፎካከሩ ታያለህ`` አሉት ፡፡ ጠያቂው ሄዶ ትንሽ ከቆየ በኋላ ኡመር ሆይ ጠያቂው ማን እንደሆነ አውቀሀልን? በማለት ሲጠይቁኝ አሏህና መልክተኛው ያውቃሉ አልኳቸው ፡፡ ``እርሱ ጅብሪል ነው የመጣው ሀይማኖታችሁን ሊያስተምራችሁ ነው ``በማለት መለሱልኝ ፡፡

(ሙስሊም የዘገበው ሀድስ )

## الأصل الثالث

معرفة نبيكم محمد صلى الله عليه وسلم وهو: محمد بن عبد الله ابن عبد المطلب بن هاشم وهاشم من قريش، وقري من العرب، والعرب من ذرية إسماعيل، إبن إبراهيم الخليل، عليه وعلى نبينا أفضل الصلاة والسلام

## ሶስተኛው መሰረታዊ መርህ

ነብዩ ሙሀመድን ማወቅ ነብያችን ሙሀመድ ቢን አብዱሏህ ቢን አብዱል ሙጦሊብ ቢን ሀሺም ናቸው፡፡ ሀሺም ደግሞ ከቁረይሽ ጎሳ ነው፡፡ ቁረይሽ ደግሞ የአረብ ነገድ ነው ፡፡ አረቦች ደግሞ የአሏህ ወዳጅ (ኸሊል )የኢብራሂም ልጅ የሆነው የእስማዒል ዝርዮች ናቸው፡፡ አሏህ በርሳቸው ና በነብያችን ላይ በላጭ የሆነ ሰላም እና እዝነትን ያስፍን ፡፡

የእድሜ ዘመናቸው 63 ዓመት ነበር ።በነብይነት ከመላካቸው በፊት 40 አመት ቆይተዋል ነብይና መልእክተኛ ሆነው ደግሞ 23 አመት አሳልፈዋል። ኢቅራእ (አንብብ )የሚለው ምዕራፍ በወረደላቸው ግዜ የነብይነት ማእረግ አገኙ። አል- ሙደሲር በሚለው ምዕራፍ ደግሞ መልዕክተኛ (ረሱል)ሆኑ ።

ሀገራቸው መካ ሲሆን ወደ መድናም ተሰደዋል
አሏህ ከሺርክ እንዳስጠነቅቁና ወደ ተውሂድ እንድጣሩ ልኳቸዋል። ለዚህም ማስረጃ ተከታዩ የአሏህ ቃል ነው ፦

`` አንተ (ልብስህን) ደራቢው ሆይ! ተነሳ አስጠንቅቅም
ጌታህንም አክብር ልብስህንም አጥራ ጣዖትንም
ራቅ ማብዛትንም የምትፈልግ ኾነህ (በረከትን)
አትለግስለለ ለጌታህም (ትዕዛዝ) ታገሥ `` (አል-ሙደሲር 1-7 )

`` ተነሳ አስጠንቅቅ `` ማለት ከሺርክ አስጠንቅቅ ወደ ተውሂድም ተጣራ ማለት ነው ።

``ጌታህንም አክብር `` ማለት አንድነቱን በማረጋገጥ አልቀው ማለት ነው።

`` ልብስህን አጥራ ``ማለት ስራህን ከሺርክ አጥራ ማለት ነው

**وله من العمر: ثلاث وستون سنة، منها اربعون قبل النبوة، وثلاث وعشرون نبياً ورسولاً، نبيء بإقرأ. وأرسل بالمدثر**

**وبلده مكة، وهاجر إلى المدينة**

**بعثه الله بالنذارة عن الشرك ويدعو إلى التوحيد والدليل**

**قوله تعالى : {يَا أَيُّهَا الْمُدَّثِّرُ قُمْ فَأَنْذِرْ وَرَبَّكَ فَكَبِّرْ وَثِيَابَكَ فَطَهِّرْ وَالرُّجْزَ فَاهْجُرْ}**

**ومعنى {قُمْ فَأَنْذِرْ} ينذر عن الشرك ويدعو إلى التوحيد**

**{وَرَبَّكَ فَكَبِّرْ} أي: عظمه بالتوحيد**

**{وَثِيَابَكَ فَطَهِّرْ} أي: طهر أعمالك عن الشرك**

{وَالرُّجْزَ فَاهْجُرْ}

الرجز: الأصنام وهجرها تركها، والبراءة منها وأهلها

أخذ على هذا عشر سنين يدعو إلى التوحيد وبعد العشر عرج به إلى السماء وفرضت عليه الصلوات الخمس

وصلى في مكة ثلاث سنين وبعدها أمر بالهجرة إلى المدينة والهجرة: الإنتقال من بلد الشرك إلى بلد الإسلام والهجرة فريضة على هذه الأمة من بلد الشرك إلى بلد الإسلام وهي باقية إلى أن تقوم الساعة. والدليل قوه تعالى

{إِنَّ الَّذِينَ تَوَفَّاهُمُ الْمَلائِكَةُ ظَالِمِي أَنْفُسِهِمْ قَالُوا فِيمَ كُنْتُمْ قَالُوا كُنَّا مُسْتَضْعَفِينَ فِي الْأَرْضِ قَالُوا أَلَمْ تَكُنْ أَرْضُ اللَّهِ وَاسِعَةً فَتُهَاجِرُوا فِيهَا فَأُولَئِكَ مَأْوَاهُمْ جَهَنَّمُ وَسَاءَتْ مَصِيراً إِلَّا الْمُسْتَضْعَفِينَ مِنَ الرِّجَالِ وَالنِّسَاءِ وَالْوِلْدَانِ لا يَسْتَطِيعُونَ حِيلَةً وَلا يَهْتَدُونَ سَبِيلاً فَأُولَئِكَ عَسَى اللَّهُ أَنْ يَعْفُوَ عَنْهُمْ وَكَانَ اللَّهُ عَفُوّاً غَفُوراً}

``ሪጅዝ `` ማለት ጣኦታትን የሚወክል ቃል ሲሆን ከጣኦታት መራቅ ደግሞ ጣኦታትንና እነሱን የሚያመልኩ ጣኦታውያንን በመተው ከነሱ ሙሉ በሙሉ መፅዳት ነው።

ነብዩም በዚህ መሰረት 10 አመታት ወደ ተውሂድ ጥሪ ሲያደርጉ ከቆዩ በኋላ ወደ ሰማይ አርገው(ከእርሱ በሆነ ተአምር)አምስቱ ሶላቶች ግደታ ተደረጉባቸው ።

መካ ውስጥ ሶስት አመታት እየሰገዱ ከቆዩ በኋላ ወደ መድና ሂጅራ(ስደት) እንዳደርጉ ታዘዙ ስደት(ሂጅራ )ማለት ከሽርክ ሀገር ወደ ኢስላማዊ ሀገር የሚደረግ ሂጅራ (ስደት ) በዚህ ኡምማ (ሙስሊም መህበረሰብ)ላይ እስከ እለተ ትንሳኤ የፀና ግዴታ ነው። ለዚህ ማስረጃውም :-

``እነዚያ (ለእምንት ባለመሰደድ) ነፍሶቻቸውን በዳዮች ኾነው መላእክት (በበድር) የገደሉዋቸው (መላእክት ለነርሱ) ``በምን ነገር ላይ ነበራችሁ`` አሏቸው ``በምድር ውስጥ ደካሞች ነበርን`` አሉ ``የአላህ ምድር ትሰደዱባት ዘንድ ሰፊ አልነበረችምን`` አሉዋቸው እነዚያም መኖሪያቸው ገሀነም ናት በመመለሻነትም ከፋች! ግን ከወንዶችና ከሴቶች ከሕፃኖችም ሲኾኑ (ለመውጣት) መላን የማይችሉና መንገድንም የማይምመሩ ደካሞች (ቅጣት የለባቸውም) እነዚያም አላህ ከእነርሱ ይቅርታ ሊያደርግ ይሻል አላህም ይቅር ባይ መሓሪ ነው `` (አል-ኒሳእ 97-99)

وقوله تعالى: {يَا عِبَادِيَ الَّذِينَ آمَنُوا إِنَّ أَرْضِي وَاسِعَةٌ فَإِيَّايَ فَاعْبُدُونِ}

قال البغوي - رحمه الله تعالى

سبب نزول هذه الآية في المسلمين الذين بمكة لم يهاجروا ناداهم الله باسم الإيمان

والدليل على الهجرة من السنة قوله صلى الله عليه وسلم :

"لاتنقطع الهجرة حتى تنقطع التوبة ولا تنقطع التوبة حتى تطلع الشمس من مغربها"

فلما آستقر بالمدينة أمر ببقية شرائع الإسلام مثل: الزكاة، والصوم، والحج، والجهاد والآذان، والأمر بالمعروف والنهي عن المنكر وغير ذلك من شرائع الإسلام أخذ على هذا عشر سنين وبعدها توفي صلوا الله وسلامه عليه ودينه باق، وهذا دينه، لا خير إلا دل الأمة عليه، ولا شر إلا حذرها منه

`` እናንተ ያመናችሁ ባሮቸ ሆይ ! ምድሬ በእርግጥ ሰፊ ናት (ብትቸገሩ ተሰደዱ ) እኔን ተገዙኝ ``( አንክቡት 56 )

ታላቁ የቁርአን ተንታኝ ``ሙፈሲር`` አልበገዊ (አላህ ይዘንላቸው) እንድህ ይላሉ

``የዚህን አንቀፅ መውረድ ምክናየት በመካ ሂጅራ ሳያደርጉ የቀሩ ሙስሊሞች ናቸው ፡፡ አሏህ በእምነት ስም ጠርቷቸዋል (ከአማኞች ጎራ መድቧቸዋል)፡፡

ሂጅራ ሱና ለመሆኑ መረጃው ተከታዩ የነብዩ ሙሀመድ(ሶአወ ) ሀድስ ነው ፡-

`` ተውበት(ንስሀ )እስኪቋረጥ ድረስ ሂጅራ አይቋረጥም ተውበት ደግሞ ፀሀይ ከመግቢያዋ እስክትወጣ ድረስ አይቋረጥም ፡፡``

ቋሚ ተቀማጭነታቸውን በመድና ባደረጉ ግዜ የተቀሩትን እስላማዊ ህግጋት ታዘዙ እንደ ዘካ ፆም ሀጅ አዛን ጅሀድ መልካምን ማዘዝና ከመጥፎ መከልከል የመሳሰሉት ማለት ነው በዚህ መልኩ አስር አመታት ካሳለፉ በኋላ አረፉ የአሏህ ሰላም እና እዝነት በእሳቸው ላይ ይስፈን እሳቸው ወደ ቀጣዩ አለም ቢሸጋገሩም ሀይማኖታቸው ግን ምንግዜም ቀሪ ነው ይህ ድን መልካም የተባለን ሁሉ ለኡማው አመላክቷል ሸር ከሆነ ነገር ሁሉ አስጠንቅቋል ፡፡

والخير الذي دل عليه: التوحيد، وجميع ما يحبه الله ويرضاه، والشر الذي حذر منه: الشرك وجميع ما يكرهه الله ويأباه

بعثه الله إلى الناس كافة وافترض الله طاعته على جميع الثقلين: الجن والأنس والدليل قوله تعالى

{قُلْ يَا أَيُّهَا النَّاسُ إِنِّي رَسُولُ اللَّهِ إِلَيْكُمْ جَمِيعاً}

وأكمل الله به الدين، والدليل قوله تعالى

{الْيَوْمَ أَكْمَلْتُ لَكُمْ دِينَكُمْ وَأَتْمَمْتُ عَلَيْكُمْ نِعْمَتِي وَرَضِيتُ لَكُمُ الْأِسْلامَ دِيناً}

والدليل على موته صلى الله عليه وسلم قوله تعالى

{إِنَّكَ مَيِّتٌ وَإِنَّهُمْ مَيِّتُونَ ثُمَّ إِنَّكُمْ يَوْمَ الْقِيَامَةِ عِنْدَ رَبِّكُمْ تَخْتَصِمُونَ}

والناس إذا ماتوا يبعثون والدليل قوله تعالى

ያመላከተው ኸይር ተውሂድ ና አሏህ የሚወደውን ነገር ባጠቃላይ ሲሆን ያስጠነቀቀው ሸር ደግሞ ሽርክ እንድሁም አሏህ የሚጠላውና የማይቀበለው ነገር ሁሉ ነው።

አሏህ ነብዩን(ሶአወ ) ወደ ሰው ዘር በሙሉ ልኳቸዋል እንድሁም ለርሳቸው መታዘዝን በሰወችም ሆነ በጅኖች ላይ ግደታ አድርጓል ። ለዚህም ተከታዩ የአሏህ ንግግር ማስረጃ ነው።

`` በላቸው ! እናንተ ሰወች ሆይ እኔ ወደናንተ ወደሁላችሁም የአሏህ መልእክተኛ ነኝ ``(አል-አእራፍ 158 )

አሏህ እርሳቸውን በመላክ ሀይማኖትን (ድንን ) አሟልቷል። ለዚህ ተከታዩ የአሏህ ንግግር ማስረጃ ነው :-

``...ዛሬ ሃይማኖታችሁን ለናንተ ሞላሁላችሁ ጸጋዬንም በናንተ ላይ ፈጸምኩ ለእናንተም ኢስላምን ከሃይማኖት በኩል ወደድኩ ... `` (አል_ማኢዳ 3)

ነብዩ (ሶአወ ) ስለመሞታቸው ተከታዩ የአሏህ ንግግር ማስረጃ ነው :-

``አንተ ሟች ነህ እነርሱም ሟቾች ናቸው ከዚያም እናንተ በትንሣኤ ቀን እጌታችሁ ዘንድ ትከራከራላችሁ``

(አል-ዙመር 30-31)

ሰወች ከሞቱ በኋላ ይቀሰቀሳሉ ለዚህ ማስረጃው :-

{مِنْـهَا خَلَقْنَـاكُمْ  وَفِيهَا نُعِيدُكُمْ  وَمِنْـهَا نُخْرِجُكُمْ تَـارَةً أُخْرَى}

``ከእርሷ (ከምድር) ፈጠርናችሁ በእርሷም ውስጥ እንመልሳችኋለን ከእርሷም በሌላ ጊዜ እናወጣችኋለን ``

(ጧሀ 55 )

{وَاللَّهُ أَنْبَتَكُمْ مِنَ الْأَرْضِ نَبَاتاً ثُمَّ يُعِيدُكُمْ فِيهَا وَيُخْرِجُكُمْ إِخْرَاجاً}

``አላህም ከምድር ማብቀልን አበቀላችሁ ከዚያም በውስጧ ይመልሳችኋል ማውጣትንም ያወጣችኋል `` (ኑህ 17-18 )

وبعد البعث محاسبون ومجزيون بأعمالهم، والدليل قوله تعالى

ከትንሳኤ በኋላ በምድራዊ ህይወታቸው ላከናወኑት ሁሉ ይመረመሩና እንደየስራቸው ይመነዳሉ። ለዚህ ማስረጃው ተከታዩ የአሏህ ቃል ነው ።

{لِيَجْزِيَ الَّذِينَ أَسَاءُوا بِمَا عَمِلُوا وَيَجْزِيَ الَّذِينَ أَحْسَنُوا بِالْحُسْنَى}

``በሰማያት ያለውና በምድር ያለው ሁሉ የአላህ ነው እነዚያን ያጠፉትን በሠሩት ሊቀጣ እነዚያን ያሳመሩትንም በመልካሚቱ (ገነት) ሊመነዳ (የጠመመውንና የቀናውን ያውቃል) `` (አል-ነጅም 31 )

ومن كذب بالبعث كفر والدليل قوله تعالى

ትንሳኤን ያስተባበለ ከኢስላም በመውጣት ከካፊሮች ጎራ ይቀላቀላል ። ለዚህም ማስረጃው፡-

{زَعَمَ الَّذِينَ كَفَرُوا أَنْ لَنْ يُبْعَثُوا قُلْ بَلَى وَرَبِّي لَتُبْعَثُنَّ ثُمَّ لَتُنَبَّؤُنَّ بِمَا عَمِلْتُمْ وَذَلِكَ عَلَى اللَّهِ يَسِيرٌ}

``እነዚያ የካዱትን በፍጹም የማይቀሰሱ መኾናቸውን አሰቡ «አይደለም በጌታዬ እምላለሁ በእርግጥ ትቀሰቀሳላችሁ ከዚያም በሠራችሁት ሁሉ ትነገራላችሁ ይህም በአላህ ላይ ቀላል ነው» በላቸው `` (አል- ተጋቡን 7 )

وأرسل الله جميع الرسل مبشرين ومنذرين

አሏህ መልክተኞችን ባጠቃላይ አበሳሪና አስጠንቃቂ አድርጎ ልኳቸዋል ።

ለዚህም ማስረጃው ተከታዩ የአሏህ ቃል ነው

``ከመልክተኞቹ በኋላ ለሰዎች በአላህ ላይ አስረጅ እንዳይኖር አብሳሪዎችና አስፈራሪዎች የኾኑን መልክተኞች (ላክን) አላህም አሸናፊ ጥበበኛ ነው `` (አል-ኒሳእ 165 )

የመጀመርያው ረሱል(መልክተኛ ) ኑህ(ዓሰ )ሲሆኑ የመጨረሻው ደግሞ ሙሀመድ (ሶአወ ) ናቸው ።እርሳቸው የነብያት መደምደሚያ ናቸው። የመጀመርያው ረሱል ኑህ ለመሆናቸው ማስረጃው፡-

``እኛ ወደ ኑሕና ከርሱ በኋላ ወደ ነበሩት ነቢያት እንዳወረድን ወደ አንተም አወረድን `` (ኒሳእ 163 )

አሏህ ወደ ሁሉ ህዝቦች አሏህን ብቻ እንዳመልኩና ጣጉትን (ጣኦትን)እንድርቁ ያዘዘበትን መልእክት እንዳደርሱ ከኑህ ጀምሮ እስከ ሙሀመድ ያሉ መልእክተኞችን ልኳል። ለዚህም ማስረጃው ተከታዩ የአሏህ ቃል ነው ፡-

`` በየሕዝቡም ሁሉ ውስጥ «አላህን ተገዙ ጣዖትንም ራቁ» በማለት መልክተኛን በእርግጥ ልከናል ``(አል-ነህል 36 )

በዚህም አሏህ በባሮቹ ሁሉ ላይ ጣዖትን በመካድ አሏህን በብቸኝነት ማምለክን ግዴታ አደረገ ።

ታዋቂው  አሊም ቢን ቀይም (አሏህ ይማራቸው) እንድህ አሉ፡-

والدليل قوله تعالى

{رسلا مبشرين ومنذرين لئلا يكون للناس على الله حجة بعد الرسل}

وأولهم نوح عليه السلام، وآخرهم محمد صلى الله عليه وسلم والدليل على أن أولهم نوح عليه السلام قوله تعالى

{إِنَّا أَوْحَيْنَا إِلَيْكَ كَمَا أَوْحَيْنَا إِلَى نُوحٍ وَالنَّبِيِّينَ مِنْ بَعْدِهِ}

وكل أمة بعث الله إليها رسولاً  من نوح إلى محمد يأمرهم بعادة الله وحده وينهاهم عن عبادة الطاغوت والدليل قوله تعالى

{وَلَقَدْ بَعَثْنَا فِي كُلِّ أُمَّةٍ رَسُولاً أَنِ اعْبُدُوا اللَّهَ وَاجْتَنِبُوا الطَّاغُوتَ}

وافترض الله على جميع العباد الكفر بالطاغوت والإيمان بالله

قال ابن القيم - رحمه الله تعالى

``ጣዖት ማለት ሰወች እሱን በማምለክ የርሱን ፈለግ በመከተልና በመታዘዝ ድንበር የሚያልፉበት ሁሉ ነው ።

ጣዖት ብዙ ሲሆን ቀንደኞቹ ግን አምስት ናቸው ፡-

- ሰይጣን የአሏህ (እርግማን ይውረድበት)
- ሰወች ዒባዳ(አምልኮ )ሲያደርጉለት ወዶ የተመለከ
- ሰወች እንዳመልኩት ጥሪ ያደረገ
- የሩቅ ሚስጥርን አውቃለሁ ያለ
- አሏህ ካወረደው ሸሪአ ውጭ በሰው ሰራ ህግ የፈረደ ናቸው ።

ጣዖት መካድ ግዴታ እንደሆነ ማስረጃው ፡-

``በሀይማኖት ማስገደድ የለም ቅኑ መንገድ ከጠማማው በእርግጥ ተገለጠ በጣዖትም የሚክድና በአሏህ የሚያምን ሰው ለእርሱ መበጠስ የሌላትን ጠንካራ ዘለበት በእርግጥ ጨበጠ አሏህም ሰሚ አዋቂ ነውና ``

(አል-በቀራህ 256 )

ይህ የላኢላሀ ኢለሏህ ፍቺ ነው ።

الطاغوت: ما تجاوز به العبد حده من معبود أو متبوع، أو مطاع والطواغيت كثيرة ورؤسهم خمسة

- إبليس لعنه الله - ومن عبد وهو راض

ومن دعا الناس إلى عبادة نفسه - ومن أدعى شيئاً من علم الغيب - ومن حكم بغير ما أنزل الله

والدليل قوله تعالى {لا إِكْرَاهَ فِي الدِّينِ قَدْ تَبَيَّنَ الرُّشْدُ مِنَ الْغَيِّ فمن يَكْفُرْ بِالطَّاغُوتِ وَيُؤْمِنْ بِاللَّهِ فَقَدِ اسْتَمْسَكَ بِالْعُرْوَةِ الْوُثْقَى}

وهذا معنى لا إله إلا الله

ተከታዩ ሀድስ እዚህ ላይ ተጠቃሽ ነው
``የነገሩ ሁሉ ቁንጮ ኢስላም ነው ሶላት
ምሰሶው ሲሆን የሻኛው ጫፍ ደግሞ
(በአሏህ መንገድ መታገል)ጅሃድ ነው ``

## አሏህ ሁሉን  አዋቂ ነው

**አሏህ ሆይ ! በነብዩ
ሙሀመድ(ሶአወ)በቤተሰቦቻቸውና በደጋግ
ክቡራን ሰሀቦቻቸው ሰላም እዝነትና
በረከትን አስፍን**

# ተፈፀመ

**وفى الحديث :"رأس الأمر
الإسلام  وعموده الصلاة وذروة
سنامه الجهاد في سبيل الله"**

## و الله اعلم

**وصلى الله على محمد وآله وصحبه
وسلم**